# የልቡና ችሎት

## የክርስትና-እስልምና ተዋሥኦዎች በመካከለኞቹ ዘመናት

2ኛ እትም



በረከት አዝመራው

# የልቡና ችሎት

## የክርስትና-እስልምና ተዋሥኦዎች በመካከለኞቹ ዘመናት

በረከት አዝመራው

አዲስ አበባ፣ 2014 ዓ.ም

ኢማም ሆይ! ልብ እና አእምሮ ካለህ እውነትን ከሐሰት ለይ::"

እጨጌ እንባቆም፣ አንቀጸ አሚን፣ ገጽ 260::

# ምሥጋና

አምላካዊ እውነቶችን እና ዘላለማውያት ህላዌያትን ፍጥረታዊ ውሱንነታችን እስኪገድበን ድረስ እንመረምርበት ዘንድ ብሩህ አእምሮን፣ በውስጥ እና በውጭ እንነጋገርበት ዘንድ ቃልን፣ ከሁሉም የሚበልጡትን ፍቅርን እና እምነትን መያዝ እንችል ዘንድ ረቂቅ ልቡናን ሰጥቶ ከገዥነት ጋር በነፍስ በሥጋ አክብሮ የፈጠረን ለጋሱ እና ጠቢቡ አምላካችን የተመሠገነ ይሁን! ዳግመኛም ይህን መጽሐፍ አዘጋጅ ዘንድ 'በብዙ አይነት እና በብዙ ጎዳና' ስለረዳኝ የመድኃኒቴን አምላክ ወደ ሰማይ ቀና ብዬ ሳይሆን ወደ ምድር ዝቅ ብዬ አመሠግነዋለሁ!

ከታላላቅ ወንድሞች ከሚገኝ ፍቅር ጋር ለጋ አእምሮን ወደ መንፈሳዊ ብስለት በሚገፋ ትምህርቶቻችሁ እና ምክሮቻችሁ ደጋግማችሁ የጎበኛችሁኝ መምህራኖቼ ዲ/ን ብርሃኑ አድማስ እና ዲ/ን ያረጋል አበጋዝ የደቀ መዝሙር ምሥጋናዬ ከትሕትና ጋር ይድረሳችሁ! ብሬ ይህን መጽሐፍ አይተህ ስለሰጠኸኝ አበረታች ምክር እና ጠቃሚ እይታዎችህ በእጅጉ አመሠግናለሁ፤ የምትሰጠው አያሳጣህ!

ይህን መጽሐፍ በጥንቃቄ አይተው እርማት እና እጅግ ጠቃሚ የሆኑ ተጨማሪ ሐሳቦችን የሰጡኝን መምህራን (እና ደራስያን) ደብተራ በአማን ነጸረ፣ መ/ር ግርማ ባቱን እንዲሁም የሽፋን ገጹን አሳምሮ ያዘጋጀውን ፍጹም አለማየሁ በእጅጉ አመሠግናለሁ።

ውድ ባለቤቴ ውብርስት ክንዱ፣ መላ ቤተሰቦቼ እና ጓደኞቼ! ይህ ሥራ ከፍጻሜ የደረሰው ዘርዝሬ የማልጨርሰው መልካምነታችሁ ተጨምሮበት ነው። እግዚአብሔር ይክፈላችሁ!

# መታሰቢያነቱ

በሽምግልና ዘመኑ የፊደል ገበታ ቀርጾ እና ቀለም በጥብጦ ጨቅላውን የልጅ ልጁን ፊደል ላስቆጠረኝ ቀኝጌታ ማዘንጊያ ፈለቀ እና ለውድ እናቴ ወ/ሮ ደባካ አያሌው ይሁንልኝ!

# ተጨማሪ የንባብ ግንባር

በአማን ነጸረ

ደብተራና የሕግ ባለሙያ

ዓለምን ምዕራብና ምሥራቅ ብለው የሚከፍሉ ሊቃውንት ለምሥራቁ የሚሰጡት ሥዕል መጠየቅን ቸል የሚልና እንበለ ተኀሥሦ ማመንን ብቻ ማዕከል ያደረገ አድርገው ነው። ገቢሩ ያን ማሳየቱ ግን ያጠራጥራል። እስከምንውቀው ድረስ ታላላቅ ዓለም አቀፍ ጉባኤያት የተካሄዱት በምሥራቁ ንፍቀ ክበብ ነው። ጉባኤያቱ የጥያቄ ማንሳት ልምድን ያሳያሉ። በምሥጢረ ሥላሴና በነገረ ክርስቶስ የሚጠሩት አበውም ሆነ ጉባኤ ቤቶች መገኛ ካርታጎ የሚባለው ሰሜን አፍሪካ ክፍል፣ እስክንድርያና አንጾኪያ ናቸው። ለሃይማኖታዊ ተጠየቆች ቅርፅና መልክ በመስጠት የምሥራቁ ዓለም ያለው ድርሻ ከሚባለውና ከሚጻፈው ከፍ ይላል። ድርሻው ከሃይማኖት ባሻገር ፍልስፍናንም ይሸፍናል።

ምዕራባውያኑ የጨለማው ጊዜ እያሉ የሚበይኑትን ከ5ኛው እስከ 10ኛው ክፍለ ዘመን የዘለቀ ዘመን ብርሃን ያበራበት የምሥራቁ በተለይም የዐረባውያኑና ፋርሶቹ ሥልጣኔ እንደሆነ ይነገራል። በክርስትና ሥነ መለኮትና በመንፈሳዊ ሕይወት የምሥራቁ በተለይም የመካከለኛው ምሥራቅ ሊቃውንት ተራቅቆና ገቢራዊ ሕይወት በቤተ ክርስቲያናችን ከልሳነ ዐረቢ ተተርጒመው በሚታወቁ መጻሕፍት የሚነበብ ነው። ሆኖም በዚያ አካባቢ የእስልምና እንቅስቃሴ ሲጀመር ስለነበረው መንፈሳዊ ተዋሥኦና የአካባቢው ሊቃውንት ስለነበራቸው ተጋድሎ ያለን ዕውቀት የሚጠበቀውን ያህል አይመስልም። ቸላ እንለዋለን። ዐረብንና ዐረብኛን ለእስልምና ብቻ ሰጥተን ቀዳምያኑን ረባውያን የክርስትና ሊቃውንት እንደመዘንጋት አድርገናቸዋል።

አባቶች ‹‹እስማኤላውያን፣ መሐመዳውያን፣ ትርኩዕ፣ ሐቃላውያን፣ ተንባላት፣ መለሳይ/መለሳውያን›› የመሳሰሉ ቃላትን እየተጠቀሙ ስለ እስልምና አስተምህሮ ያትታሉ። እንዲህ ያለውን ንባብ በቅዳሴ ማርያም፣ በስንክሳር፣ በመካከለኛው ምሥራቅ ያሉ ሊቃውንት፣ እንደ አቡነ ኤዎስጣቴዎስና አቡነ ዮሐንስ በመሳሰሉ የቤተ ኤዎስጣቴዎስ መነኮሳት ገድላት፣ እንደ አቡነ ዜና ማርቆስ ባሉ የቤተ ተክለ ሃይማኖት መነኮሳት እንደሁም በጒንዳጒንዶ በነበሩት በእነ አቡነ መዝገበ ሥላሴ

ገድላት፣ በርቱዐ ሃይማኖት፣ በተአምረ ማርያም ስለ እስልምና ሙስሊሞች በመጠኑ እናነባለን። በዚህ መጽሐፍ እንደ አንድ የክርስትና ሥነ መለኮት ሊቅ ማጣቀሻ ሆኖ የቀረበልን የእጨጌ ዕንባቆም ዘደብረ ሊባኖስ ሥራ (አንቀጸ አሚን) ደግሞ ገፋ አድርጎ ቀዳምያኑ የመካከለኛው ምሥራቅ ከሙስሊም መምህራን ጋራ ያደረጉትን ገፋ ያለ መራቀቅ ያለበት ጽሑፍ ያቀርብልናል።

ወንድማችን በረከት አዝመራው ከእጨጌ ዕንባቆም አንቀጸ አሚን ሻገር ብሎ እስልምና ከተነሣበት 7ኛው ክፍለ ዘመን ጀምሮ የተነሡ ክርስቲያን ሊቃውንት እነ ዮሐንስ ዘደማስቆ፣ በሃይማኖተ አበው የምናውቃቸውን እነ አቡ ዘካርያ ያህያ ዕብነ ዐደይ፣ በትርጉም የጉባኤያት ሐተታዎቻቸው የምናውቃቸውን እነ አቡፈረጅ እና በርካታ የመካለኛው ምሥራቅ ሙስሊም ሊቃውንት ያደረጉአቸውን ተዋሥኦዎች ያቀርብልናል። በተዋሥኦው ምሥጢረ ሥላሴና ነገረ ክርስቶስ ማዕከል ይሆኑና ከክብረ ቅዱሳንና ምግባራት ጋራ የተገናኙ ጉዳዮችም በተጨማሪ ጭብጥነት እየተነሡ ይዳሰሳሉ። ዳሰሳው ማጥቃትንና ነጥብ ማስቆጠርን ሳይሆን በተፋቅሮ ማዳንን፣ በረጋ ሕሊና መነጋገርን በማሰብ በውብና ስለሚገለጠው ርእስ ሲወሳ ጥቅም ላይ የሚውሉ ቃላትን ሳይዘነጋ፣ ይልቁንስ ለአንባብያን ይዘቱን በሚከሥት መልኩ በቀላልና ውብ ቋንቋ የቀረበ ነው። የሚነሡት ጭብጦች እስልምናን ማጠንጠኛ ቢያደርጉም ትሩፋታቸው ሁለንተናዊነት አለበት።

በመጽሐፉ የሥላሴን የአንድነትና ሦስትነት ምሥጢር፣ የክርስቶስን አምላክ ወልደ አምላክ መሆን፣ የባሕርይ አምላክነቱን፣ ነገረ መስቀሉን፣ ትንሣኤውን፣ ዕርገቱን፣ የምናኔ ሕይወትን፣ በነጻ ፈቃድ ዙሪያ የተነሡ ጥያቄዎችን፣ ከሞት በኋላ ያለውን ሕይወት አኗኗር፣ ነገረ ቅዱሳንና ሥርዓታትን ከነባር የእስልምና ጥያቄዎች በመነሣት በየዘመኑ የተነሡ የክርስትና ሊቃውንት እንዴት ያለ መልስ እንደሰጡ እናነባለን። መልሶቹ ለእስልምና ምሁራን ቢሰጡም ቅሉ በዚህ ዘመን ከሌሎች ቤተ እምነቶች የሚነሡ ጥያቄዎችንም በእግረ መንገድ ይመልሳሉ። መልስና ጥያቄው ተጋፊ ቋንቋን ሳይሆን ጽንሰ ሐሳብንና ጭብጥን ያማከለ በመሆኑ በእልህና በተጋነነ ተቆርቋሪነት የታፈነውን ቤተ እምነት ዘለል ተዋሥኦ አዲስ ገጽታ እንደሚሰጠው አምናለሁ። ለኦርቶዶክሳውያን አንባብያንም በዐረቡ ዓለም የነበሩ ሊቃውንት ምን ያህል ጠንካሮች፣ ርቱዐንና ረቂቃን እንደነበሩ እንረዳበታለን። በዚህም ወንድማችን በረከት አዝመራው አንድ ተጨማሪ የንባብ ግንባር እንደከፈተልን ይሰሰማኛል። ፍልሚያውን ለአንባብያን። መልካም ንባብ!

# ቀዳሚ ነገር

በእዚ.ጋጃ

የክርስትናም ሆነ የእስልምና ቅዱሳት መጻሕፍት ለሃይማኖት ጥብቅና መቆምን እና ሌሎች ወደ እውነት እንዲመጡ መጣርን ያበረታታሉ። አንዱ ለሌላው እውነት እምነቱን በቅን ልቡና ለማሳወቅ የሚያደርገው ጥረት የጋራ ወደሆነ እውነት ለመምጣት፣ ውሸትን እውነት አድርጎ ሰዎችን እና እምነታቸውን በከንቱ እየኮነኑ ከመኖር ነጻ ለመሆን እና ካለመነጋገር የሚፈጠር መራራቅን እና ጥላቻን ለማስወገድ ያግዛል። ነገር ግን ለዚህ ዓላማ የሚደረጉ ተዋሥኦዎች[1] የሰዎችን ስሜት መጉዳት፣ እውነትን ተጨባጭ ባልሆኑ አሉባልታዎች መሸፈን እና የመሳሰሉ ተዛማጅ ክፉ ተግባራት እንዳያጅቧቸው መጠንቀቅ ይገባል። መጽሐፍ ቅዱስ ይህን ለመግለጽ "መልስ ለመስጠት የተዘጋጃችሁ ሁኑ፤" ካለ በኋላ ቀጥሎ "ነገር ግን በየዋህነትና በፍርሃት ይሁን፤" ይላል።

> "በእናንተ ስላለ ተስፋ ምክንያትን ለሚጠይቁአችሁ ሁሉ መልስ ለመስጠት ዘወትር የተዘጋጃችሁ ሁኑ፥ ነገር ግን በየዋህነትና በፍርሃት ይሁን።" (1ኛ ጴጥሮስ 3፥15)

የእስልምና ቅዱስ መጽሐፍ የሆነው ቁርአንም ክርክርን ይከለክልና "መልካም የሆነችውን" ክርክር ግን ይፈቅዳል። ይህ መልካም የክርክር መንገድም እንድ ከሚያደርጉ ጉዳዮች መጀመርን እንደ መርሕ የሚይዝ እና አላስፈላጊ ንትርኮችን የሚያስወግድ እንደሆነ መተርጉማኑ ይናገራሉ።

> "የመጽሐፉን ባለ ቤቶችም (አይሁድን እና ክርስቲያኖችን) በዚያች እርሷ መልካም በኾነችው ክርክር እንጂ አትከራከሩ ..." (ቁርአን 29፥46)

የዚህ መጽሐፍ ዝግጅት የተጀመረው በ2012 ዓ.ም መጋቢት ወር አካባቢ በኮሮና ቫይረስ ወረርሽኝ ምክንያት ጸሎቶች በቀጥታ የቴሌቪዥን ስርጭቶች ማታ ማታ

---

[1] 'ተዋሥኦ' የግእዝ ቃል ሲሆን "ተመላለሰ፣ ተነጋገረ፣ ተከራከረ፣ ተሟገተ፣ ተባባለ" ማለት ነው። አለቃ ኪዳነ ወልድ ክፍሌ፣ መጽሐፈ ሰዋስው ወግስ ወመዝገበ ቃላት ሐዲስ፣ ገጽ 394። ይህ ቃል 'ክርክር' ከሚለው ቃል የተሻለ ሰፊ ትርጉም ያለው በመሆኑ የዚህ መጽሐፍ ደራሲ በሚቀጥሉት ምዕራፎች በብዛት ተጠቅሞታል። 'ተዋሥኦ' 'Dialogue' ከሚለው የእንግሊዝኛ ቃል ጋር የሚቀርብም (እንዲያውም የተሻለ) ትርጉም ያለው ቃል ነው።

ይስተላለፉ በነበረበት ወቅት አንድ የእስልምና መምህር ከመርሐ ግብሩ ዓላማ ውጭ በቀጥታ ስርጭት የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያንን አስተምህሮ በመተቸቱ ነው። ይህ ክስተት እና ሌሎች እነ አህመዲን ጀበልን የመሳሰሉ ሰዎች የሚያሳትሟቸው ክርስትናን የሚነቅፍ ይዘት ያላቸው መጻሕፍት "መልካም የሆነ ክርክር" የሚለውን የቁርኣን መርሕ የተከተሉ መሆናቸው ቢያጠያይቅም በሙስሊሞች በኩል ከኦርቶዶክስ ክርስትና ጋር ተዋሥኦ የማድረግ ፍላጎት እንዳለ ያሳያሉ። በርግጥም አካላዊ መጎዳዳት እና መገዳደል እንጂ በቅን ልቡና እስከተደረገ ድረስ መነጋገርን መፈለግ የሚበረታታ እንጂ የሚኮነን መጥፎ ነገር አይደለም።

በርግጥ ልዩ ልዩ ማኅበራዊ መስተጋብሮችን እያደረገ ዘመናትን ባሳለፈ ማኅበረሰብ ውስጥ እንደዚህ ያሉ መጻሕፍትን መጻፍ ቅን ልቡናን እና ትልቅ ጥንቃቄን ይጠይቃል፤ የበለጠ ለመቀራረብ እና ለመረዳዳት ታስቦ የተደረገው ለመጣላት እና ለግጭት ምክንያት ሊሆን ይችላልና። ብዙ ሚሊዮኖች በሚከተሏቸው ሃይማኖቶች መካከል የሚደረጉ ተዋሥኦዎች በመከባበር ላይ የተመሠረቱ እና የሚያንጹ ሊሆኑ ይገባል። ማክበር ማለት ግን ዝም ማለት አይደለም፤ አንዱ በሌላው ላይ የሚያነሣቸውን ጥያቄዎች ሳያጣጥሉ እና ሳያናንቁ መልስ መስጠት እንጂ። የእስልምናው ቅዱስ መጽሐፍ ቁርኣን እና በሌሎች ሙስሊም ሊቃውንት የተጻፉ ድርሳናት በክርስትና አስተምህሮዎች ላይ በርካታ ጥያቄዎችን እና ትችቶችን ይሰነዝራሉ። እነዚህ ትችቶች መልስ ይጠብቃሉ፤ ለተጠየቁት ጥያቄ መልስ መስጠት አስፈላጊ ነውና።

አንዳንድ ሰዎች ይህን ማድረግ የሌላውን ሃይማኖት እንደመንቀፍ እና ጠብ-አጫሪነት መቁጠራቸውም ትክክል አይደለም፤ ጥያቄን አክብሮ መልስ መስጠት ቢያስመሰግን እንጂ ሌላውን ሊያስከፋ አይገባምና። ለመሆኑ የሌሎችን ሃይማኖት ማክበር ምንድር ነው? እምነታቸውን መጋራት ነውን? ወይስ የእኛም የእነርሱም ትክክል ነው ብሎ መቀበል? ወይስ በልብ እያሙ በአንደበት ዝም ማለት? የዚህ መጽሐፍ አዘጋጅ የሌሎችን ሃይማኖት ማክበር በሌሎች ሃይማኖቶች ውስጥ ያሉ አስተምህሮዎችን እና እርሱ ወደሚከተለው ሃይማኖት የሚሰነዘሩ ትችቶችን ሳያናንቁ አክብሮ እና ጊዜ ሰጥቶ መመርመር፣ መልስ ለሚያስፈልጋቸው በቅን ልቡና መልስ መስጠት፣ ጠቃሚ የሚላቸውን አስተምህሮዎች ማድነቅ እንጂ ዝም ማለት እንዳልሆነ ያምናል። ይህ መጽሐፍ የተዘጋጀበት መንፈስም በዚህ

መንገድ እንጂ በደፈናው በመንቀፍ እና በአስተምህሮዎች ላይ በቂ ምርምር ሳያደርጉ በሚስነዘር የብሰሸሽቅ (polemical) መንገድ አይደለም።

ይህ መጽሐፍ ከ8ኛው እስከ 16ኛው መ/ክ/ዘመናት ባሉ የመካከለኞቹ ዘመናት ውስጥ በክርስትና እና እስልምና ሊቃውንት መካከል የተደረጉ ተዋሥኦዎችን ከረጅሙ በአጭሩ ለማቅረብ ይሞክራል። አዘጋጁ ይህን መንገድ የተከተለበት ምክንያት የደብረ ሊባኖስ ገዳም አስተዳዳሪ በነበረው እጨጌ እንባቆም በ16ኛው መ/ክ/ዘመን ከተጻፈው መጽሐፍ ውጭ በመካከለኞቹ ዘመናት በዐረብ፣ ባዛንታይን እና ምዕራባውያን ሊቃውንት የተደረጉ ሰፊ ተዋሥኦዎች በኢትዮጵያ ጥንታውያን ድርሳናት ውስጥ ያላቸው ቦታ (ስርጭት) ትንሽ በመሆኑ ይህን ክፍተት ለመሙላት ነው። እነዚህ ለረጅም ዘመናት የዳበሩ ውርሶች በዘመናት ሂደት የተጣሩ በመሆናቸው የኢትዮጵያ ክርስቲያኖች እና ሙስሊሞች ለሚያደርጓቸው ተዋሥኦዎች እንደ መልካም መነሻ ሆነው ያገለግላሉ በሚል ዓላማ ይህ መጽሐፍ ተዘጋጅቷል።

እነዚህን ጥንታውያን የክርስትና-እስልምና ተዋሥኦዎች በአግባቡ ለመረዳት እና በውስጣቸው ያለውን እውነት በተሻለ ሁኔታ ለማየት ክርስቲያኖችም ሙስሊሞችም ሊያስተውሏቸው የሚገቡ ጉዳዮች አሉ።

በኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን የነገረ-ሃይማኖታዊ ትውፊት ውስጥ በጉልህ የሚታየው ክርስትና ከአይሁድ እና ከግሪክ የዕውቀት ባሕል (hellenism) ጋር በነበረው መስተጋብር በዋናነት እስከ 7ኛው መ/ክ/ዘመን መጀመሪያ የተፈጠረው የእስክንድርያ እና የአንጾኪያ ነገረ-ሃይማኖታዊ ባሕል ነው። ይህ ግን በኋላ የተነሣውና ከእስልምና ጋር በተደረገው መስተጋብር የዳበረው የዐረብ ክርስትና ውርስ በኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ቦታ የለውም ለማለት አይደለም፤ የኀላውን ለመናገር ነው እንጂ። በዚህም ምክንያት በክርስትና-እስልምና ተዋሥኦዎች ውስጥ የምናገኛቸው ክርስቲያን ሊቃውንት ክርስትናን ለሙስሊሞች መረዳት ቅርብ አድርጎ ለማቅረብ የተጠቀሙባቸው አገላለጾች በዓውዳቸው ሊታዩ ይገባል፤ ከቀድሞው ትውፊት ጋር ያላግባብ ማነጻጸርም ሆነ ማምታታት ወደ ስሕተት ይወስዳል።

በትምህርተ-ሥላሴ በመደበኛው አገላለጽ 'የአካል ግብራት' ተብለው የሚታወቁት ከእስልምና አንጻር በተብራሩ የጥብቅና ሥራዎች 'የባሕርይ ሲፋት' ወይም

'ኩንታት' ተብለው ይጠራሉ። ይህም በእስልምና ከሚታወቁት እና በመጀመሪያዎቹ ዘመናት ጀምሮ የውስጣዊ መለያየት ምክንያቶች ከነበሩት አምላካውያን ሲፋት[2] አንጻር ትምህርተ-ሥላሴን ለማብራራት እና ለሙስሊሞች መረዳት ቅርብ አድርጎ ለማቅረብ የተደረገ ጥረት ነው። በአጠቃላይ በኩንታት ላይ የተመሠረተው ትምህርተ-ሥላሴ በዚህ ጥብቅናዊ መንገድ የዳበረ መሆኑን በመገንዘብ በዚህ ዓውድ መረዳት ይገባል።

በክርስቶስ ሰው መሆን (ምሥጢረ ሥጋዌ) ትምህርት ክርስቶስ የእግዚአብሔር አካላዊ ቃል መሆኑ ጎልቶ ይነገራል። ሰው የሆነበትን መንገድም ሰውነትን በመልበስ መንገድ (clothing metaphor) መግለጽ ይዘወተራል። ክርስቶስ እና ሐዋርያቱ ያደረጓቸው ተአምራትም ትልቅ የክርስትና ምስክሮች መሆናቸው እስልምና ከተስፋፋባቸው ሌሎች መንገዶች አንጻር በንጽጽር ቀርበዋል። የመስቀሉ ጉዳይም ይህ እንዴት ሊሆን ይችላል? ከሚለው ጥያቄ በተጨማሪ የክርስቶስ በመስቀል ላይ ተሰቅሎ መሞት ምን ጥቅም አለው? የሚለው ጉዳይ ትልቅ ትኩረት ተሰጥቶት ይብራራል። ነጻ-ፈቃድ፣ ኃጢአት እና ሥርየት (ይቅርታ) ትልቅ ትኩረት የተሰጣቸው ጉዳዮች ናቸው። እነዚህ ጉዳዮች ከቁርአን አስተምህሮ አንጻር ቅርፅ የያዙ በመሆናቸው በዚያው ዓውድ ሊመረመሩ ይገባል። መሠረታዊው አስተምህሮ እስካልተቀየረ ድረስ በውጭ ያሉት የተሻለ ይረዱት ዘንድ ነገረ-ሃይማኖታዊ አገላለጾችን በነባራዊ ባሕሎች መቃኘት ከክርስቶስ ትምህርት እና ከቅዱስ ጳውሎስ የአርዮስፋጎስ ንግግር ጀምሮ በሌሎች የክርስትና ጥብቅና ሥራዎችም የተለመደ አካሄድ ነው፤ ዓላማውም ሰዎች ወደ ክርስትና እምነት እንዲመጡ ማገዝ ነው። ከእስልምና አንጻር የተደረጉ የክርስትና የጥብቅና ሥራዎችም ይህ ጎልቶ የሚታይባቸው ናቸው፤ ክርስቲያኖችም ሆነ ሙስሊሞች እነዚህን ድርሳናት ሲያነቡ ይህን ዓውድ ሳይዘነጉ እና ከሌላ ልዩ ዓውድ ጋር ሳያጋጩ በጥንቃቄ ሊሆን ይገባል።

ክርስትና በመገለጥ ላይ የተመሠረተ እምነት ነው። በመሆኑም ከተለመዱ ዕውቀቶች ከፍ የሚሉት የክርስትና አስተምህሮዎች ለእምነት እንጂ ለአመክንዮአዊ ሐተታዎች ቅርብ አይደሉም። እስልምና የክርስትናን መገለጥ ነቅፎ እና መጻሕፍቶቹ ተበርዘዋል የሚል ትችት ይዞ በመምጣቱ በቅዱሳት

2 ስለ አምላካውያት ሲፋት (صفات) እንዲሁም ከትምህርተ-ሥላሴ ጋር ስላላቸው ግንኙነት ምዕራፍ ሦስት ገጽ 137-147 በሰፊው ተብራርቷል።

መጻሕፍት ምስክርነት ላይ ተመሥርቶ በእምነት ላይ የቆመው የክርስትና ሃይማኖት ራሱን በአመክንዮ ጭምር መከላከል ግድ ሆነበት። ይህ በአመክንዮአዊ መንገድ ለክርስትና ጥብቅና መቆም ቀድሞም ከግሪክ እና ሮማውያን ባሕሎች ጋር በነበረው መስተጋብር የተለመደ ቢሆንም የእስልምናው አሰላለፍ ከበድ የሚለው እስልምና ለክርስትና ቅዱሳት መጻሕፍት ዕውቅና ቢነፍግም ክርስትናን ለመተቸት ግን አመክንዮን ራሱ መገለጥ ከሚለው አስተምህሮ (ቁርአን) ጋር እያዳበለ መጠቀሙ ነው። ከክርስትና ባሕሎች መካከል ይህ የዓረብ ክርስትና ባሕል አመክንዮ እና ምሳሌዎችን አብዝቶ የሚጠቀም (speculative) የሆነው ወድዶ ሳይሆን በዚህ ምክንያት ተገድዶ ነው።

ይህን ዳራ መረዳት ለሙስሊም አንባቢዎች ይጠቅማል። በዚህ መጽሐፍ በብዙ ረቂቅ አምክንዮዎች እና ምሳሌዎች የቀረበው የክርስትና ሊቃውንት መልስ ከክርስትና መንፈሳዊ ጸጋ እና ተአምራዊነት የተነሣ አማኞች በቀላሉ በእምነት የተቀበሉት አስተምህሮ እንጂ በእነዚህ ሁሉ አመክንዮአዊ ማብራሪያዎች ራሳቸውን ሲያስጨንቁ ከኖሩ በኋላ ቆይተው የተቀበሉት ዕውቀት አይደለም። እነዚህ ማብራሪያዎች በአብዛኛው ክርስትና አመክንዮአዊ አይደለም ብለው ለሚተቹ እና የራሳቸውን አስተምህሮ የበለጠ አመክንዮአዊ አድርገው ለማቅረብ ለሚሞክሩ አካላት ክርስትና ከአመክንዮ በላይ (beyond reason) የሆኑ አስተምህሮዎች ቢኖሩትም አመክንዮ የጎደለው (irrational) እንዳልሆነ ለማሳየት የቀረቡ በመሆናቸው በዚሁ አቅጣጫ መረዳት ስለ ክርስትና ትክክለኛ እይታን ለመያዝ ያግዛል።

በምዕራፍ አንድ በመካከለኛዎቹ ዘመናት የክርስትና-እስልምና ተዋሥኦዎች በብዛት ይደረጉባቸው በነበሩባቸው አካባቢዎች የነበሩ ነገረ-ሃይማኖታዊ፣ ማኅበራዊ እና ፍልስፍናዊ ዳራዎችን በአጭሩ ለመዳሰስ ተሞክሯል። በተጨማሪም ድርሳናቶቻቸው በቀጥታም በተዘዋዋሪም ከዘመናችን ደርሰ በዚህ መጽሐፍ በሰፊው የምንጠቅሳቸውን በመካከለኞቹ ዘመናት የተነሡ የክርስትና እና እስልምና ሊቃውንት አጭር ግለ-ታሪክ እና የድርሳናት ዳሰሳ እናቀርባለን። እነዚህን ታሪካዊ ዳራዎች እና የሊቃውንት ግለ-ታሪካዊ ዳሰሳዎች ማወቅ ተዋሥኦውን በዓውዱ ለመረዳት በእጅጉ ጠቃሚ ነው። አንባቢው ምዕራፍ አንድን አንብቦ ወደሚቀጥሉት ምዕራፎች እንዲሄድ የሚበረታታ ቢሆንም በተለያዩ ምክንያቶች በሌሎች ምዕራፎች ውስጥ ወደ ቀረቡ ጉዳዮች በቀጥታ መሄድ ግድ ከሆነ አስፈላጊ

ነገሮችን ለመዳሰስ ወደዚህ ምዕራፍ እየመጡ መቃኘት ለሳኛው አማራጭ ነው።

በምዕራፍ ሁለት በተዋሥኦው እንደ ምስክሮች የሚጠቀሱ ነገሮች፣ የሚቀርቡባቸው ትችቶች፣ የሚሰጡ መልሶች እና አጠቃቀማቸውን እንዳስሳለን። እነዚህ የተዋሥኦ ምስክሮች በዋናነት ቅዱሳት መጻሕፍት፣ አመክንዮ እና የተፈጥሮ ምሳሌዎች ናቸው። ይህን ምዕራፍ በአግባቡ መረዳት በሚቀጥሉት ምዕራፎች የሚቀርቡ ነገረ-ሃይማኖታዊ ሐተታዎችን ለመመርመር እንዲሁም የትችቶችን እና መልሶችን አግባብነት በልቡና ለመመዘን እንደ ቅድመ ሁኔታ ይሆናል።

ምዕራፍ ሦስት በክርስትና ትምህርተ-ሥላሴ ላይ ከእስልምና የሚቀርቡ ትችቶችን እና በክርስትና ሊቃውንት የተሰጡ መልሶችን የያዘ ሰፊ የመጽሐፉ ክፍል ነው። ይህ ምዕራፍ በክርስትና-እስልምና ተዋሥኦዎች የአመክንዮአዊ እና ምሳሌያዊ ሐተታዎች ነገረ-ሃይማኖታዊ ፋይዳ ከቀድሞ ይልቅ ምን ያህል እንደጨመረ ማሳያ ተደርጎ ሊወሰድ ይችላል። የተሰጡ ማብራሪያዎችን በትክክለኛ መንገድ ለመረዳት ክርስቲያኖችም ሙስሊሞችም ይህን ምዕራፍ በትልቅ ጥንቃቄ ደጋግመው እንዲያነቡት ማሳሰብ አስፈላጊ ነው። ትምህርተ-ሥላሴ የእግዚአብሔርን ዘላለማዊ እና ባሕርያዊ ህልውና የሚናገር ከፍ ያለ አስተምህሮ በመሆኑ በአንድ በኩል ከአመክንዮም በላይ መሆኑን በሌላ በኩል ደግሞ ኢ-አመክንዮአዊ አለመሆኑን ለማብራራት ተሞክሯል፤ በሁለቱ እይታዎች መካከል ያለውን ረቂቅ አንድነት በምሳሌዎች ለማሳየትም በተለያዩ አቅጣጫዎች የቀረቡ ሐተታዎችን ይዟል።

ምዕራፍ አራት የክርስቶስ ሰው መሆን (ትምህርተ-ሥጋዌ) እና የሰው ልጆች በክርስቶስ የማዳን ሥራዎች ያገኙት የድኅነት ጸጋ ከክርስትና-እስልምና ተዋሥኦዎች አንጻር ይቀርብበታል። በእስልምና 'ሚጋራት' ተብሎ የተወገዘው የአምላክ የሰውን ሰውነት ለብሶ መገለጥ፣ ቁርአን 'ተመሰለ እንጂ አልተደረገም'፤ በማለት የሚያስተባብለው የክርስቶስ ስቅለት እና ውጤቶቹ እንዲሁም ሌሎች ተዛማጅ ጉዳዮች ቀርበውበታል። ይህ ጉዳይ የእግዚአብሔርን ልዕልና፣ ሁሉን ቻይነት፣ ቸርነት፣ እውነተኛ ፈራጅነት እና ሌሎች ነገሮች ሁሉ በአንድነት የሚታዩበት በመሆኑ ሰፊ እና ውስብስብ ትችቶች እንዲሁም ረቂቅ የሆኑ አመክንዮአዊ እና ምሳሌያዊ ማብራሪያዎች ተካተውበታል። ነገረ-ክርስቶስ የክርስትና ማዕከላዊ አስተምህሮ በመሆኑ በዚህ ምዕራፍ የቀረቡ ትችቶች እና

የተሰጡ መልሶችን በተቻለ መጠን ዘርዘር አድርጎ ለማቅረብ ተሞክሯል። በዚህ ምዕራፍ የቀረቡ ሐተታዎችም ትጥንተ ኀሊና የሚያስፈልጋቸው እና የአንባቢን እስተዋይነት በእጅጉ የሚጠይቁ ናቸው።

የሥነ-ምግባር ሕግ ሌላኛው የጎላ የተዋሥኦ ርእስ ነው። በዚህ ርእስ እንደ አብዛኞቹ ጉዳዮች ትችቱ ከእስልምና ወደ ክርስትና ሳይሆን በተቃራኒ አቅጣጫ ሆኖ እናገኘዋለን። ክርስቲያኖቹ የእስልምናን ሕግ ለምድራዊ ተድላ ደስታ የሚመች ነገር ግን ለሰው ክቡር ተፈጥሮ እና ዘላለማዊ ሕይወት ተገቢውን ቦታ የማይሰጥ የሥነ-ምግባር ሕግ ነው በማለት ሲተቹት ሙስሊሞቹ ደግሞ የክርስትና ሕግ ከጽንፍ ርቆ ልከኛ (moderate) መሆን ይጎድለዋል በማለት ይተቻሉ። በክርስቲያን ሊቃውንት በእስልምና ላይ የቀረቡ ትችቶች እንዲሁም በወንጌል የሥነ-ምግባር ሕግጋት ዙሪያ ለቀረቡ እስላማዊ ትችቶች የተሰጡ መልሶች በምዕራፍ አምስት ይቀርባሉ።

የመጨረሻው ምዕራፍ መስቀል፣ ታቦት፣ ሥዕላት፣ ምሥጢራተ ቤተ ክርስቲያን እና ሌሎች በክርስትና ሥርዓተ-አምልኮ ውስጥ ትልቅ ቦታ ያላቸው ነገሮችን የተመለከተ ነው። በተለይ መስቀል እና ሥዕላት በተዋሥኦዎች በሰፊው የሚነሡ እና ከክርስቲያኖች የዕለት ተዕለት ሃይማኖታዊ ተግባራት ጋር በእጅጉ የተቆራኙ ጉዳዮች በመሆናቸው የተሰጣቸውም ትኩረት በዚያው መጠን ትልቅ ሆኖ ይታያል።

በዚህ መጽሐፍ የተጠቀሱ የክርስቲያን ሊቃውንት ድርሳናት ራሳቸውን በክርስትና እምነት ከሚገልጹ ኦርቶዶክሳውያን፣ መለካውያን (ምሥራቅ ኦርቶዶክስ እና ካቶሊክ) እና ምሥራቅ ሶርያውያን ('ንስጥሮሳውያን') የተሰባሰቡ ናቸው። የዚህ መጽሐፍ አዘጋጅ የሁሉንም ድርሳናት የተጠቀመው በኢኩዩሚኒዝም መንፈስ አይደለም። ይልቁንስ ከእስልምና ጋር በተያያዘ በክርስትናው ዓለም ሰፊ የሆነ የጥብቅና ሐሳቦች መወራረስ በመኖሩ ነው። በመሆኑም ለምንጭ ያህል 'እከሌ እንዳለው…' እያልን ድርሳናትን እንጠቅሳለን እንጂ አብዛኞቹ ሐሳቦች በሁሉም ዘንድ በጋራ የተያዙ እና የተወራረሱ ናቸው። ይልቁንም አብዛኞቹ ቀደምት ሊቃውንት የምዕራብ ሶርያ ኦርቶዶክሳዊት (ያዕቆባዊት) ቤተ ክርስቲያን አባቶች መሆናቸውን ጥናቶች ያመለክታሉ። ይህን መጠቆም የተፈለገው 'ከሌሎች የተገኘ' በሚል የጥብቅና ሐሳቦችን የሚያናንቅ እንዳይኖር ለማስ[illegible]ዘብ ነው።

በመጨረሻም ስለ መጽሐፉ አጻጻፍ ስልት ጥቂት ነገሮችን እንበል። ይህ መጽሐፍ ዳሰሳዊ (analytical) አቀራረብን የተከተለ በመሆኑ ጥቅሶች እና ምልልሶች ይበዙበታል። በዚህ ምክንያት አንባቢው በሁለት ወገን የተሰለፉ ሰዎችን ተዋሥኦዎች እየሰማ በልቡ ዳኝነት የሚሰጥ አካል እንደሆነ ሊሰማው ይችላል። የመጽሐፉ ርእስ 'የልቡና ችሎት' መባሉም ይህን ሁኔታ ለመግለጽ ነው።

በመጽሐፉ የተጠቀሱ የሊቃውንት ሐሳቦች ብዙዎቹ ከዐረብኛ፣ ከሱርስት፣ ከግሪክ እና ከላቲን ወደ እንግሊዝኛ ተተርጉመው የተገኙ እና በአዘጋጁ ወደ አማርኛ እየተተረጎሙ የቀረቡ ናቸው። የእነዚህ ጥቅሶች ብዙዎቹ የእንግሊዝኛ ንባቦች በግርጌ ማስታወሻ ተካትተዋል። ይህ የተደረገው ስለሁለት ምክንያቶች ነው። የመጀመሪያው ምክንያት የትርጉም ጥራትን የተመለከተ ነው። እነዚህ የእንግሊዝኛ ቅጅዎች ቀድሞ ከላይ ከጠቀስናቸው ጥንታውያን ቋንቋዎች የተተረጎሙ በመሆናቸው ወደ ሌላ ቋንቋ ሲተረጎሙ የትርጉም ትርጉም ይሆኑ እና ሐሳባቸው ይቀንሳል። በመሆኑም ቢያንስ እንግሊዝኛውን መረዳት ለሚችሉ አንባብያን እንግሊዝኛውን በማንበብ የተሻለ መረዳት እንዲኖራቸው ለማገዝ ታስቦ የተደረገ ነው። ሁለተኛው በሊቃውንቱ የተነሡ ብዙ ረቂቅ አመክንዮአዊ ማብራሪያዎች ለመረዳት ደጋግሞ ማንበብን ስለሚጠይቁ አንባቢው አንድን ጉዳይ በተለያዩ ቋንቋዎች የማሰላሰል ዕድል ማግኘቱ ጠቃሚ በመሆኑ ነው።

አንባቢ ሆይ! የዚህ መጽሐፍ ርእስ 'የአእምሮ ችሎት' ሳይሆን 'የልቡና ችሎት' ነው። 'ልቡና' ፍቅርን፣ ማስተዋልን፣ ዕውቀትን፣ ጥበብን፣ ቸርነትን፣ ስሜትን፣ አድናቆትን፣ ወ.ዘ.ተ… የሚያጠቃልል ጥልቅ ትርጉም ያለው የሰው ጥልቅ ማንነት እንደሆነ ሁሉ በዚህ መጽሐፍ የቀረቡትን ሐሳቦች ለመረዳትም ዕውቀትን ወይም ከላይ ከዘረዘርናቸው አንዱን ብቻ መያዝ አይበቃም፤ ይልቁንስ የእነዚህን ነገሮች ምልዓት ይጠይቃል። ለምሳሌ ያህል ፍቅርን፣ መደነቅን፣ ቸርነትን መገንዘብ የማይችል ወይም የማይፈልግ ሰው የእግዚአብሔር አካላዊ ቃል ክርስቶስ ሰው የሆነበትን ምክንያት በአመክንዮ ብቻ በአግባቡ ሊረዳ አይችልም። በመሆኑም እግዚአብሔር በድንቅ ተፈጥሮ ያደለህ/ሽን ይህን ልቡናህ/ሽን ይዘህ/ሽ ይህን መጽሐፍ ትመረምር/ሪ ዘንድ ተጋብዘሃል/ሻል።

# የአርእስት ማውጫ

# -1-

# ታሪካዊ ዳራዎች

## የክርስትና-እስልምና ማኅበረሰባዊ መስተጋብር
## እና
## የሊቃውንት ግለ-ታሪክ ዳሰሣ

አንዳንድ ሊቃውንት እንደሚሉት በዐለም ላይ ለታሪካቸውና ለሥራዎቻቸው በቂ ትኩረት ከተነፈጋቸው ማኅበረሰቦች ውስጥ የዐረብ ክርስቲያኖች ተጠቃሾች ናቸው። እስልምና በመካከለኛው ምሥራቅ ተነሥቶ በአካባቢው መሪነቱን መያዝ ከጀመረበት ከ፯ኛው ክፍለ ዘመን ጀምሮ በእስልምና እና በክርስትና ሊቃውንት ዘንድ ሰላማዊ እና ዕውቀትን መሠረት ያደረገ ብዙ ክርክሮች ተደርገዋል፣ መንፈስ ቅዱስ በቤተ ክርስቲያን ያለው የማያቋርጥ መግቦቱም በውይይታቸው ታይቷል። ሆኖም እነዚህ ውይይቶች ለቀሪው ዐለም በጣም በትንሹ ከመታወቃቸው በቀር ብዙም የታወቀ ሳይሆኑ ቀርተዋል። በኢትዮጵያም ያለው ሁኔታ ተመሳሳይ ነበር። አሁን አሁን ግን የክርስትና-እስልምና ተዋሥኦዎች መቀስቀሳቸውን ተከትሎ እነዚያ ድርሳናት እየተፈለጉ እየተጠኑና እየተተረጎሙ ናቸው።

ይህ መጽሐፍም የዚህ ዐለም አቀፍ የክርስቲያኖች አንድ ተግባር አንድ አካል እንደሆነ ይሰማኛል። መጽሐፉ በተለያዩ ዘመናት የነበሩ የዐረቡ ዐለም የእስልምና እና የክርስትና ሊቃውንት መካከል የተመረጡትን ታሪካቸውን፣ የተከራከሩባቸውን ጉዳዮች እና በተለይም ደግሞ ከእስልምና ሊቃውንት ለተነሡ መሠረታዊ ጥያቄዎች የዐረብ ክርስቲያን ሊቃውንት የመለሷቸውን አስደናቂ መልሶች የያዘ ግሩም መጽሐፍ ነው። በዚህ ዘመን ያለነው ክርስቲያኖች በዘመናት የተንሸራሸሩትን ጥያቄዎችና መልሶች ብቻ ሳይሆን በየዘመናቱ የነበሩትንም ሰላማዊ እና ዕውቀታዊ ክርክሮች ተረድተን ለመዘጋጀት ከፈለግን በምንም መንገድ ሊያመልጡን ከማይገባቸው መጻሕፍት አንዱና ዋናው ይህ በወንድማችን በረከት አዘመራው የተዘጋጀው 'የልቡና ትሎት' መጽሐፍ እንደሆነ አምናለሁ።

**ብርሃኑ አድማስ**
**በሥነ ድርሳን ሁለተኛ ዲግሪ**

ዐቃቤ ሃይማኖት/እምነት (Apologist) የጸረ ክርስትና ጥቃቶችንና ዘርዘር ይዘታቸውን ቀድሞ የመረዳትን ዐቅም እና የመከላከል ጥበብን የታደለ ሰው አገልግሎት ነው። ይህም ለቤተ ክርስቲያን ልጆች መጽናትንና መጠበቅን ይሰጣቸዋል።

ወንድማችን በረከት አዘመራው ክርስቲያናዊ አስተምህሮ ከእስልምና መምህራን ይነሡበት የነበሩ ጥያቄዎችንና በዘመኑ የነበሩ አባቶች የመለሷቸው መልሶችን ከታሪካዊ ዳራቸው ጭምር በዚህ መጽሐፍ ውስጥ በጥልቀት ዳስሷቸዋል። በተያያዥነት የቀረቡ ደጋፊ ሐሳቦችና መረጃዎች በከፍተኛ ጥንቃቄ የተሠራ ጥናት የወለደውን የዚህን መጽሐፍ ፋይዳ እጅግ ከፍ ያደርጉታል። በተመሳሳይ ጥያቄ የተያዙ ወገኖችንም ያስተምራል። ብዙም ጎልተው ያልታወቁ አባቶችንም ያስተዋውቃል። በረከት ክርስትና የሚገኝበትን የአስተምህሮ ልዕልና ደረጃና ምሉዕነት ከመካከ እውነቶች ጋር በጥሩ አቀራረብ አምጥቶልናል። በጥልቀት የተመለከትኩት ይህ ሥራው ለአንባብያን የቤተ ክርስቲያን ልጆችና ለሌሎችም እውነት ፈላጊዎች ብዙ ጥቅም እንደሚሰጥ እምነቴ ጽኑዕ ነው። መጽሐፉን በማንበብ ከያዛቸው ፍሬዎች ተጠቀሙ ዘንድ ወንድማዊ ምክሬን እየለገስኩ በረከትንም እጅግ አድርጌ አመሰግናለሁ። ዳግመኛም በመሰል ጠቃሚ ሥራዎች እንደሚመጣልን ተስፋ አደርጋለሁ።

**መ/ር ግርማ ባቱ**
**በቅድስት ሥላሴ ዩኒቨርሲቲ የሥነ መለኮት መምህር እና ደራሲ**

ISBN 978-99944-3-468-8

ዋጋ፡ 395.00 ብር $25

ጳጳው አታሚዎች
0911-51-70-31 0929-17-31-32/33